


# በአዲስ አበባ ከተማ ግንባታ ፈቃድና ቁጥጥር ባለስልጣን

# ADDIS ABABA CITY CONSTRUCTION PERMIT AND CONTROL AUTHORITY

## የህንጻ የውጭ ገጽታ ቀለም ኮድ ቁጥር 01/2015
## [ለሙከራ ትግበራ የተዘጋጀ]



ግንቦት 2014
አዲስ አበባ

## ማውጫ

## ክፍል አንድ

**አጠቃላይ**

### 1.1 *መግቢያ*

የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ከተማዋን እንደ ስሟ " አዲስ " እና ውብ ለማድረግ የተለያዩ ከተማዊና አገራዊ ፋይዳ ያላቸው ፕሮጀክቶችን ነድፎ እየተገበረ መሆኑ ይታወቃል። ከዚህ በተጨማሪ የግል ባለሀብቱ የከተማዋን እድገት ለማስቀጠል እና ብልጽግናዋን እውን ለማድረግ በህንጻ ግንባታ ዘርፍ ከፍተኛ የልማት ስራዎችን በመስራት ላይ ይገኛል። በከተማዋ አሁን እየታየ ያለውን ፈጣን የህንጻ ግንባታ ልማት ስራ ስልታዊ በሆነ መንገድ ለመምራት እና የከተማዋ መለያ በህንጻ ግንታዎች ውስጥ እንዲኖር ለማድረግ አስተዳደሩ የመዋቅራዊ ፕላን፣ የህንጻ ህግጋት፣ ኮዶችና ስታንዳርዶችን በማዘጋጀት ወደ ተግባር ገብቷል። በዚህም የከተማዋን ገጽታ፣ ውበትና ደህንነት ለማሻሻል ተግባራዊ እንቅስቃሴ በማድረግ ላይ ይገኛል።

ከዚህ በተጨማሪ አስተዳደሩ በከተማዋ የሚገነቡ ህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም በእይታ ላይ የሚፈጥረውን መዘበራረቅ (Visual Pollution) በመቀነስ፣ ተናባቢ (Harmonized) እና ለእይታ ማራኪ ለማድረግ የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም በማጥናት ወደ ተግባር ማስገባት እንዲሚገባ ተገንዝቧል። በመሆኑም ከተማዋ ያለውን የህንጻ የውጭ ገጽታ ቀለም በዘበራረቅን ለመቀነስ እና ከተማዋ መለያ የህንጻ ቀለም እንዲኖራት ይህ የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም ኮድ ተዘጋጅቷል።

### 1.2 አጭር ነባራዊ ሁኔታ ዳሰሳ / Situational Assessement Summary/

የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ከተማዋን በፕላን ለመምራት መዋቅራዊ ፕላን በማዘጋጀት ወደ ተግባር መግባቱ ይታወቃል። ይሁን እንጂ መዋቅራዊ ፕላኑን በዝርዝር ጥናቶች ተግባራዊ ለማድረግ የከተማዋን ሁሉንም አካባቢዎች የዳሰሰ የአካባቢ ልማት ፕላን (Local Development Plan)፣ የከተማ ዲዛይን (Urban Design)፣ የአጎራባች/የሠፈር ፕላን (Neighborhood Plan)...ወዘተ በተሟላ ደረጃ በማዘጋጀት ወደ ተግባር አልተገባም። በመሆኑም በፕላን ትግበራ ቅደም ተከተል መሰረት የከተማ ዲዛይን በማዘጋጀት እና የከተማዋን የህንፃዎች የውጭ ገፅታ ቀለማት ሳይወሰን ቆይቷል። በዚህም በግሉ ዘርፍም ሆነ በመንግስት የሚገነቡ ህንጻዎች ለከተማዋ ውብት ከመፍጠር ይልቅ በሰዎች ስነ-ልቦና ላይ ጫና የሚፈጥሩ፣ ከተማዋን ከጊዜ ወደ ጊዜ የሚያዥጎረጎሩ እና በእይታ ላይ ብክለት (Visual Pollution) የሚፈጥሩ እየሆኑ መተዋል።

የህንፃ ዲዛይን አማካሪዎች የህንፃዎችን የውጭ ገፅታው ቀለም መረጣ የአጎራባች አካባቢውን ነባራዊ ሁኔታና ተናባቢነት እንዲሁም የአካባቢውን ልዩ ባህሪ ከግምት ከማስገባት ይልት ነጠላ ህንጻ ላይ ያተኮረ ነው። በሌላ መልኩ መንግስት የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም ተናባቢና ተመጋጋቢ ለማድረግ እና የከተማዋን ልዩ ባህሪ ከግምት ያስገባ መለያ (Identity Branding) ለመጠበቅ የሚገባውን ሚና ተወጥቷል ማለት አይቻልም።

ከዚህ በተጨማሪ በተደረገው ዳሰሳ በከተማችን የሚገኙ 65 በመቶ የሚሆኑ ህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም በአውሮፓ አገራት ጥቅም ላይ በመዋል በሚገኘው RAL 7000- RAL 7048 ክልል (Range) ውስጥ የሚገኙ ቀለማት ናቸው።

በሪል እስቴቶች የተገነቡ ህንጻዎች በተለያዩ RAL Range ውስጥ የሚገኙ ቀለማት የሚጠቀሙ እና በአብዛኛው የራሳቸው ወጥ የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም ያላቸው ናቸው። ጤና ነክ ተቋማት፣ ትምህርት ነክ ተቋማት፣ የባህል ማዕከላት እና የእምነት ተቋማት የራሳቸው የተለየ ባህሪ ያላቸው መሆኑን መገንዘብ ተችሏል። ፋብሪካዎች እና ማከማቻዎች (Industries and Storages) ልዩ ባህሪ ያላቸው በመሆኑ ታውቋል። ከዚህ በተጨማሪ ጥንታዊና በቅርስነት የተመዘገቡ ህንጻዎች የራሳቸው የሆነ ሊጠበቅ የሚገባው እሴት እንዳላቸው የታየ ሲሆን አለም አቀፍ መለያ ቀለም (Brand) ያላቸው ተቋማት እና ኩባንያዎች የራሳቸውን የውጭ ገጽታ ቀለም ወጥ በሆነ መልኩ ጥቅም ላይ እንደሚያውሉ መገንዘብ ተችሏል።

በመሆኑም ከላይ የተገለጹ ነባራዊ ሁኔታዎችን ከግምት ያስገባ እና የሚታዩ ችግሮችን ለመቅረፍ የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም ስልታዊ በሆነ መልኩ ማጥናት እና ተግባራዊ ማድረግ የሚስችል አሰራር ማበጀት እንደሚያስፈልግ ታይቷል። ትግበራውም ሁሉንም ባለድርሻ አካላት ያሳተፈ እና ዘላቂ ውበትን ማረጋገጥ በሚያስችል መልኩ ታክቲካል እና ስልታዊ አካሄድን ተከትሎ መፈፀም ያስፈልጋል።

## 1.3 የኮዱ ዓላማ

በከተማዋ የሚታየውን የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም መዘበራረቅ (Visual Pollution) በመቀነስ፣ ለከተማዋ ልዩ ገጽታ የሚፈጥሩ ህንጻዎችን ዘላቂነት በመጠበቅ እና ከተማዋ የራሷ የሆነ ልዩ መለያ ቀለም (Unique Identities) እንዲኖራት በማድረግ ውብና ተነባቢ፣ ደረጃዋን የጠበቀች፣ የቱሪስት መስብ የሆነች እና ለሌሎች የአገራች ከተሞች በዚህ ረገድ ሞዴል እንድትሆን ማድረግ ነው።

## 1.4 የኮዱ አስፈላጊነት

የአዲስ አበባ የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለማት አስፈላጊነት ከዚህ በታች በዝርዝር ቀርቧል።

1. በከተማዋ የህንጻ ግንባታ በከፍተኛ ፍጥነት እየተስፋፋ እና እያደገ በመምጣቱ ከተማዋ ዥንጉርጉር ከመሆኗ በፊት የህንጻዎች ገጽታን ከእይታ በካይነት ወደ ቱሪስት መስህብነት መቀየር በማስፈለጉ፣
2. የህንጻ ግንባታዎች የውጭ ገጽታ በአካባቢው ስነ-ምህዳር እና በሰዎች ስነ-ልቦና ላይ የሚፈጥሩትን ተጽህኖ በመቀነስ ምርታማነትን ማሳደግ በማስፈለጉ እና /Import Substitution/ ምቹ ሁኔታ መፍጠር በማስፈለጉ፣
3. በከተማዋ የሚገኙ ታሪካዊና በቅርስነት የተመዘገቡ ህንጻዎችን የሚጠብቅ እና ልውላዊነትን (Globalization) የሚያካትት የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም አመራር ስርዓት በማስፈለጉ፣
4. ለሚዘጋጁ የከተማ ዲዛይን (Urban Design) ጥናቶች መለያ ቀለም በመወሰን ለእይታ በካይ እንዳይሆኑ እና በባለሙያ ስሜት እና ፈቃድ ላይ የተመሰረቱ እንዳይሆኑ መወሰን በማስፈለጉ፣
5. በከተማዋ ዝርዝር የከተማ ፕላን (Detailed Urban Design) የሌላት በመሆኑ እና የህንጻ ግንባታ ዘርፉ በፍጥነት እያደገ በመምጣቱ የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለምን ስታንዳርዳይዝ ማድረግ አስፈላጊ በመሆኑ፣ ዋና ዋናዎቹ ናቸው።

### 1.5 የኮዱ ትግበራ ወሰን

የህንጻዎች የውጭ ቀለም አጠቃቀም ኮድ ተግባራዊ የሚሆነው በአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ክልል ውስጥ በሚገነቡ የግል እና የመንግስት የህንጻ ግንባታዎች ላይ ሲሆን ከዚህ በታች በተዘረዘሩት የህንጻ ግንባታዎች ላይ ተግባራዊ አይሆንም፡-

1. ታሪካዊ የሆኑ እና በቅርስነት የተመዘገቡ ህንጻዎች፣
2. በእምነት ተቋማት ለማምለኪያ አገልግሎት ብቻ እንዲውሉ በሚገነቡ ግንባታዎች፣
3. የጤና ተቋማት (ጤና ነክ ተቋማት)፣ የትምህርት ተቋማት፣ የባህል ማዕከላት፣ ፋብሪካዎችና ማከማቻዎች፣
4. ዓለም አቀፍ መለያ ቀለም (Brand) ያላቸው ተቋማት፣ ሆቴሎች፣ ኩባንያዎች...ወዘተ ግንባታዎች፣ ዋና ዋናዎቹ ናቸው።

## ክፍል ሁለት

### 2.1. የቃላት ፍቺ /Definition of Terms/

1. **"ቀለም:"፥** ማለት የህንጻ የውጭ አካል ላይ የሚገኝ ማንኛውም የግንባታ ቁስ/ቅብ ቀለም ነው።
2. **"የህንጻ የውጭ ቀለም:"፥** ማለት በህንጻው ውጫዊ አካል ላይ የሚገኝ እንዲሁም ከመንገድ በኩል የሚታይ ማንኛውም ቁስ የሚኖረው ቀለም ነው።
3. **"ተዛማጅ ቀለም"፥** ማለት ቀላመት ሲዋሀዱ የሚፈጥሩት ተመራጭና ሳቢ የሆነ ቀለም ዓይነት ነው።፡
4. **"የህንጻ የፊት ለፊት ገጽ:"፥** ማለት በመንገድ በኩል የሚገኝ የህንጻው ቅርጽ ወይም ግድግዳ አካል ነው።
5. **"የተፈጥሮ ቁስ ወይም natural material:"**፥ ማለት ድንጋይ፣ ማርብል፣ ግራናይት፣ እንጨት...ወዘተ የመሳሰሉ የግንባታ ግብዓቶች ናቸው።
6. **"የህንጻ ቁስ"፥** ማለት በህንጻው የውጭ አካል ላይ የሚገኝ የግድግዳ፣ የመስታወት፣ የልባስ (cladding)፣ የውቅር አካል፣ የፍሬም፣ የጣራ ሽፋን እና ተያያዥ ቁስ የሚሰራበት የግንባታ ግብአት ነው።
7. **"ታሪካዊ ህንጻዎች/ግንባታዎች"፥** ማለት የባህል፣ ኪነ-ጥበብና ቱሪዝም ሚንስቴር ወይም የአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ባህል፣ ኪነ-ጥበብና ቱሪዝም ቢሮ ታሪካዊ ተብለው ተለይተው የተመዘገቡ ግንባታዎች ናቸው።
8. **"የፕላን ስምምነት"፥** ማለት ስልጣን ባለው አካል ለህንጻ ግንባታ የቀረበ የግንባታ ዲዛይን/ፕላን ከከተማዉ መዋቅራዊ ፕላን ጋር መጣጣሙን ለማረጋገጥ የሚሰጥ የጽሁፍ ስምምነት ነዉ።

## ክፍል ሦስት

### 3.1. የከተማችን የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም

የህንጻ ቀለም መረጣው የከተማውን ባህል፣ ልማድና እሴቶች፣ ቅርሶች፣ ማህበራዊ ተቋማት፣ አለማቀፍ ተቋማት፣ ፋብሪካና ማከማቻ፣ ቴክኖሎጂና ፈጠራን፣ ወጭ ቆጣቢነት እንዲሁም ተፈጥሯዊ ሁነቶችን ከግምት ያስገባ ነው። በአጠቃላይ የቀለም መረጣ ሂደታችን በህንጻ ገጽታ ላይ ቀጥተኛ ተጽህኖ ያላቸውን ሰው ሰራሽ እና ተፈጥሯዊ ሁለቶችን ለማገናዘብ ሞክሯል።

በመሆኑም አስተዳደሩ በከተማችን ህንጻዎች ላይ የሚታዩ የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም ችግሮችን ለመፍታት ተገቢ ጥናት ማድረግ እና ቀድሞ የነበሩ ተሞክሮዎችን በግብዓትነት በመጠቀም ሁለት መፍትሔዎችን አስቀምጧል። አንደኛው **ገዥ የውጭ ህንጻ ገጽታ ቀለማትን በሙከራ ደረጃ መርጦ ተግባራዊ ማድረግ** ሲሆን ሁለተኛው ደግሞ በአንድ አካባቢ ተሰብስበው የሚገኙ እና የእይታ ብክለት የፈጠሩ ህንጻዎች ቀለማትን ተቀራራቢና ተናባቢ የሚሆኑበትን አሰራር **(Harmonization) ተግባራዊ ያደርጋል።**

የገዥ የህንጻዎች የውጭ ቀለም መረጣው ሂደት የከተማዋን የህንጻዎች ነባራዊ ሁኔታ ያገናዘበ፣ ለትግበራ ቀላል እና ለሁለተኛው የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም ልየታ ስራ ማለት ለአካባቢ ተኮር ማናበብ ስራ (Location Specific harmonization) የቀለም መረጣው በግብዓትንት የሚያገለግል ነው። በመሆኑም ይህ ዘዴ የሚከተሉትን ጉዳዮች በመስፈርትነት ተጠቅሟል፡-

1) ታሪክ፣ ባህልና እሴቶችን ከግምት ማስገባት፣
2) ታሪካዊ ህንጻዎች እና ቅርሶችን ሊያስቀጥል እና ሊጠብቅ የሚችል፣
3) የከተማውን የአየር ሁኔታ ከግምት ያስገባ፣
4) የኪነ-ህንጻ ፈጠራን ሊያበረታታ የሚችል፣
5) አዳዲስ ቴክኖሎጂዎችን ከግምት ያስገባ ወይም ማካተት የሚችል፣
6) የሀይል አጠቃቀም ላይ እና የአካባቢያዊ ተጽህኖ ዝቅተኛ የሆነ፣
7) የነዋሪው አካላዊና ስነ-ልቦናዊ መዋቅር ላይ ከፍተኛ ጫና የማይጎዳ፣
8) ለከተማዋ መለያ ሊሆን የሚችል፣
9) ወጭ ቆጣቢ፣
10) በከተማ ውስጥ ያሉ የህንጻ ቀለሞችን ከግምት ያስገባ መሆን፣
11) ተፈጥሯዊ ሁነቶችን ያገናዘበ (አረንጎዴ ቦታ፣ ወንዞች…) ዋና ዋናዎቹ ናቸው።

በሌላ መኩል ደግሞ የአካባቢ ተኮር የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ማናበብ (Location Specific harmonization) ስልት መዋቅራዊ ፕላኑን ለማስተግበር ከሚዘጋጁ የአካባቢ ልማት ፕላኖች (LDPs) እና የከተማ ዲዛይኖች (Urban Design) የሚመነጭ ነው። ይህ ዘዴ የቀለም ካታሎግ በማዘጋጀት ተቀራራቢ የቀለም ውህድን ማዘጋጀት የሚያስችል መሳሪያ (Tools) ነው።

**3.2. የከተማችን የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለማት ስታንዳርዶች**

የተማችንን የፓለቲካና የዲፕሎማሲ ማህከልነት፣ የቱሪስት መስብነት እንዲሁም የፋይናንስና የኢኮኖሚ ማዕከልነቷል ለማጎልበት እንዲሁም ለነዋሪዎቿ ምቹና ተስማሚ ለማድረግ የሚከተሉት የህንጻ የውጭ ገጽታ ቀለማት ተግባራዊ ይደረጋሉ።

1. የከተማችን የህንጻ የውጭ ገጽታ ቀለም በአብዛኛው የአውሮፓ አገራት የሚጠቀሙበት RAL ሆኖ በዋናነት ከRAL 7000- RAL 7004፣ RAL 7035- RAL 7042፣ RAL 7044- RAL 7047፣ RAL 9001- RAL 9003፣ RAL 9006፣ RAL 9007 እና RAL 9010 የከተማው ስታንዳርድ ቀለሞች ናቸው። አንድ ህንጻ በዚህ የቀለም ክልል (Range) ውስጥ የሚገኙ ከአንድ በላይ ቀለማትን በስብጥር ሊጠቀም ይችላል፣
2. የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም አይነት በወጥነት ተግባራዊ እንዲሆን ከፕላን ስምምነት አገልግሎት ጋር አብሮ ይሰጣል፣ ከዚህ በተጨማሪ የፀደቁ ቀለሞች እንደ አስፈላጊነቱ በዞኒንግ ተከፋፍለውና ለአካባቢው የተወሰነው የህንጻ ቀለም በፕላን ስምምነቱ በግልጽ ተመላክቶ ለአልሚው ይሰጣል፣
3. ማንኛውም ሪል እስቴት ወይም የጋራ መኖሪያ ቤቶች 20/80፣ 10/90/፣ 40/60፣ መንግስታዊ ፕሮጀክቶች...ወዘተ ለአካባቢው የተመረጠውን ቀለም ይጠቀማሉ።
4. የእምነት ተቋማት (ለአምልኮ የሚውሉ ግንባታዎች)፣ ጤና ነክ ተቋማት፣ ትምህርት ነክ ተቋማት፣ የባህል ማዕከላት፣ ፋብሪካዎችና ማከማቻዎች እንዲሁም አለም አቀፍ የህንጻ ግንባታ መለያ ቀለም ያላቸው ድርጅቶች፣ ኩባንያዎችና ሆቴሎች የራሳቸውን ስታንዳርድ ቀለማት መጠቀም ይችላሉ፣
5. ጥንታዊና በቅርስነት የተመዘገቡ የህንጻ ግንባታዎች እሴትነታቸው ተጠብቀው ከትውልድ ወደ ትውልድ ማስተላለፍ እንዲቻል ነባር የውጭ ገጽታ ቀለማቸውን ይጠቀማሉ፣
6. አለም አቀፍ ስታንዳርድ ያላቸው የመሰረተ ልማቶች በራሳቸው ስታንዳርድ መሰረት የውጭ ገጽታቸውን ማስዋብ አለባቸው፣
7. በህንጻዎች የውጭ ገጽታ ላይ የሚገኙ ተካፋቾች የማያንፀባርቁ እና አካባቢን የማይረብሹ ሆነው በአልሚልው በተመረጡ ቁሶች እና ቀለማት መሰራት ይችላሉ፣
8. ማንኛውም ምድብ ሐ ውስጥ የሚመደቡ የህዝብ መገልገያ የህንጻ ግንባታዎች በመጀመሪያው ወለል ላይ ከ2 ካሬ.ሜ ያላነሰ ስፋት ያለው ቦታ ወይም ግድግዳው ላይ ለአረንጓዴ ልማት ማዋል አለባቸው፣ይህም ዲዛይ በሚፀድቅበት ጊዜ በመሬት ወለል ፕላን ላይ ወይም በሳይት ፕላኑ ላይ ወይም በህንጻው ገጽ (Elevation) ዕያታ ላይ በግልጽ መካተት አለበት፣
9. ለከተማዋ ውበት እና ጤንነት ህንጻዎች ላይ በሚገኙ ሁሉም በረንዳዎች (ባልኮኒዎች) ላይ ግራ እና ቀኝ አንድ አንድ ወይም ከዚያ በላይ የሆኑ አረንጎዴ ተክሎችን በፓት መትከል አስፈላጊ በመሆኑ በሁሉም ህንጻዎች ላይ ተፈጻሚ ይሆናል።

## 3.3. ተግባራዊ የሚደረጉ የ"RAL" ቀለማት

RAL 7000- RAL 7004

| | | |
|---|---|---|
| RAL 7000 | Fehgrau | Squirrel grey |
| RAL 7001 | Silbergrau | Silver grey |
| RAL 7002 | Olivgrau | Olive grey |
| RAL 7003 | Moosgrau | Moss grey |
| RAL 7004 | Signalgrau | Signal grey |

RAL 7035- RAL 7042

| | | |
|---|---|---|
| RAL 7035 | Lichtgrau | Light grey |
| RAL 7036 | Platingrau | Platinum grey |
| RAL 7037 | Staubgrau | Dusty grey |
| RAL 7038 | Achatgrau | Agate grey |
| RAL 7039 | Quarzgrau | Quartz grey |
| RAL 7040 | Fenstergrau | Window grey |
| RAL 7042 | Verkehrsgrau A | Traffic grey A |

RAL 7044- RAL 7047

| | | |
|---|---|---|
| RAL 7044 | Seidengrau | Silk grey |
| RAL 7045 | Telegrau 1 | Telegrey 1 |
| RAL 7046 | Telegrau 2 | Telegrey 2 |
| RAL 7047 | Telegrau 4 | Telegrey 4 |

RAL 9001- RAL 9003

| | | |
|---|---|---|
| RAL 9001 | Cremeweiß | Cream |
| RAL 9002 | Grauweiß | Grey white |
| RAL 9003 | Signalweiß | Signal white |

RAL 9006, RAL 9007, RAL 9010

| | | |
|---|---|---|
| RAL 9006 | Weißaluminium | White aluminium |
| RAL 9007 | Graualuminium | Grey aluminium |
| RAL 9010 | Reinweiß | Pure white |

## ክፍል አራት

### 4. የኮዱ አፈጻጸም ስልት፣ ክለሳ እና ተግባራዊነት

#### 4.1. የአፈጻጸም ስልት

የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም አፈጻጸም የሚከተውን ስልት ተከትሎ ተፈጻሚ ይሆናል።

1. በተመረጡ አካባቢዎች የሙከራ ትግበራ ይደረጋል። የሙከራ ትግባራ የሚደረግባቸው አካባቢዎች ታሪካዊና ባህላዊ ቅርሶች የማይበዙበት አካባቢዎች ላይ ሲሆን ሙከራ ትግበራ የሚደረግባቸው አካባቢዎች የዘርፉን ባለሙያዎች እና አመራሩን ባሳተፈ መልኩ ተለይቶ የሚፈፀም ይሆናል።
2. የህንጻዎች የውጭ ቀለም ለተለያዩ አካባቢዎች መረጣ ሲደረግ ነዋሪውን ያሳተፈ መሆን ይገባዋል። በመሆኑም የቀለም መረጣው በአካባቢው በሚዋቀረው **የአካባቢ የህንጻዎች የውጭ ቀለም ቦርድ** /ኮሚቴ/ አማካኝነት የሚመረጥ ሲሆን የኮሚቴው ስብጥርም የሚከተለው ይሆናል፡-
   - የኪነ-ህንጻ ሙያ ማህበር ተወካይ ወይም የኪነ-ህንጻ ባለሙያ፣
   - የክፍለ ከተማው የመሰረተ ልማትና ትራንስፓርት ቋሚ ኮሚቴ ተወካይ
   - የአካባቢ ነዋሪዎች ተወካይ (2 ሰዎች)፣
   - ከፕላንና ልማት ኮሚሽን አንድ አመራር፣
   - ከግንባታ ፈቃድና ቁጥጥር ባለስልጣን አንድ አመራር፣
   - አካባቢውን የሚያስተዳድሩ ዋና ስራ አስፈጻሚዎች፣
   - የኮሚቴው አባላት ይሆናሉ። ኮሚቴው የከተማ አስተዳደሩ ያዘጋጀው የቀለም ካታሎግን መሰረት በማድረግ የሙከራት ትግበራ የሚደረግበትን አካባቢ የህንጻ የውጭ ገጽታ ቀለም ይወስናል።
3. በአንድ ህንጻ ላይ የቀለም ካታሎጉን መሰረት ያደረገ/ከቀለም ካታሎጉ የተመረጡ ከአንድ በላይ ቀለሞችን መጠቀም ይቻላል።
4. የሰፈር ልማት ጥናት የተጠናላቸው አካባቢዎች የከተማ ንድፍ ተዘጋጅቶላቸው እና ተናባቢ የቀለም ካታሎግ ወጥቶላቸው (Macro to Micro Level) ተግባራዊ ማድረግ፣
5. ለአንድ አካባቢ የቀለም መረጣ ሲደረግ የአካባቢውን ነባራዊ ሁኔታ ከግምት ያስገባ የቀለም መረጣ መስፈርቶችን መርጦ በመጠቀም የነዋሪውን ባህል፣ ታሪክ፣ ስነ-ልቦና ከግምት ያስገባ ማድረግ ያስፈልጋል። የቀለም መረጣ መስፈርቱ በዚህ ማንዋል ከተዘረዘሩት መካከል የሚወሰድ ሲሆን ኮሚቴው ተጨማሪ የሚላቸውን መስፈርቶች በመጨመር በአስተዳደሩ ከተመረጡ የህንጻ የውጭ ገጽ ቀለማት መምረት ይኖርበታል።
6. ከፀጥታና ደህንነት ተቋማት፣ ከኤምባሲዎች እና ዲፕሎማቶች መገኛ ግንባታዎች ወይም ልዩ ጥበቃ ከሚፈልጉ ግንባታዎች ውጭ ያሉ **የህዝብ መገልገያ ህንጻዎች** የውጭ ገጽታ እና ውበት በሚጋርድ መልኩ የአጥር ስራ መከናወን የለበትም፣
7. በአንድ አካባቢ በስፋት ተገንብተው የሚገኙ እና አገልግሎት እየሰጡ ያሉ የጋራ መኖሪያ ቤቶች (10/90፣ 20/80፣40/60…)፣ የሪል እስቴት ቤቶችን እና ሰፋፊ መንግስታዊ ግንባታዎች የውጭ ገጽታ ቀለም የመቀየር ስራን አያካትትም፣
8. ተገንብተው አገልግሎት እየሰጡ የሚገኙ እና የውጭ ገጽታቸው በተለያዩ የግንባታ ቁሶች (materials) ማለትም ማንሳት ወይም መቀባት የማያስችል ቁሶች የተሰሩ ከሆነ እንዲያነሱ ወይም ቁሱን እንዲቀይሩ ማድረግ አያስፈልግም።

9. የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም ቅብ የአካባቢ ልማት ፕላን ጥናት ያላቸው ክፍለ ከተሞች፣ የውስጥ ክፍለ ከተሞች እና ማስፋፊያ ክፍለ ከተሞች ላይ በሙከራ ደረጃ በዋናነት ተግባራዊ ይደረጋል። ለምሳሌ፡ አዲስ ከተማ፣ ቂርቆስ፣ ንፋስ ስልክ ላፍቶ፣ ልደታ ወዘተ ዋና ዋናዎቹ ናቸው።

**4.2. የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም ኮድ ክለሳ**

የኮዱ ክለሳ የሚከናወነው ኮዱ ተግባራዊ ተደርጎ የሚገኘውን ውጤት እና ግብዓት ነበሻ በማድረግ በከተማ አስተዳደሩ ውጤቱ ከተገመገመ በኃላ በሚቀመጠው አቅጣጫ መሰረት የሚከለስ ይሆናል።

**4.3. የህንጻዎች የውጭ ገጽታ ቀለም ኮድ ተግባራዊነት**

ኮዱ ተግባራዊ የሚደረገው በአፈጻጸም ስልት ላይ በተቀመጠው መሰረት ሲሆን የትግበራ ጊዜውን በሚመለከት ደግሞ የአዲስ አበባ አስተዳደር ካቢኔ ኮዱን ካፀደቀበት ማለትም ግንቦት 2014 ዓ.ም. ጀምሮ ይሆናል።

**በአዲስ አበባ ከተማ አስተዳደር ካቢኔ የፀደቀ**

**ግንቦት/2014ዓ.ም.**

**አዲስ አበባ**

**አባሪዎች፥ ለአካባቢ ተኮር ተናባቢ ቀለም መረጣ የሚያገለግሉ ቅጾች**

**ቅጽ-01**

**የባለድርሻ አካላት ተሳትፎና ዝግጅት ግምገማ ቅጽ**

| ተ.ቁ | ባለድርሻ አካላት | | የተሳታፊ መጠን | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|
| | | | ቅድመ ዝግጅት | ዝግጅት | ማፀደቅ | ትግበራ |
| 11 | አብይ ኮሚቴ | የከተማ ከንቲባ ኮሚቴ | | | | |
| | | የከተማ ስራ አስኪያጅ | | | | |
| | | ፕሮጀክቱ የሚከናወንበት ወረዳ አስተዳደር | | | | |
| | | የከተማ ፕላንና ልማት ኮሚሽን | | | | |
| 22 | ቴክኒካል ኮሚቴ | የከተማ ሥራ አስኪያጅ ወይም ተወካይ | | | | |
| | | የከተማ ፕላንና ልማት ኮሚሽን | | | | |
| | | ለባህል፣ኪነጥበብና ቱሪዝም ቢሮ | | | | |
| | | የግንባታና ፍቃድ ቁጥጥር ባለስልጣን | | | | |
| 3 | የከተማ ምክር ቤት | | | | | |
| 4 | የቀበሌ ነዋሪዎች ተወካዮች | | | | | |
| 5 | የከተማ ፕላን ማህበር | | | | | |
| 6 | የአርክቴክቶች ማህበር | | | | | |
| 7 | የቀለም ሳይኮሎጂስቶች | | | | | |
| 8 | ሌሎች | | | | | |

**ቅጽ-02**

**የተመረጠው የውጨኛው የግድግዳ ተዛማጅ ቀለም በሚመለከተው አካል የሚገመገምበት ነጥቦች**

| ተ.ቁ | የተመረጠው የቀለም ዓይነት ከአካባቢው ጋር ያለቸውን ተዛምዶ ማረጋገጫ ነጥቦች | የህጻዎች ዲዛይን መደብ | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | | በግል የህንፃ ዲዛይን አማካሪ የሚሰሩ | | | በመንግስት የሚሰሩ የህንፃ ዲዛይን ፕሮጅክቶች | | |
| | | ከፍተኛ | መካከለኛ | ዝቅተኛ | ከፍተኛ | መካከለኛ | ዝቅተኛ |
| 1 | የቀለሙ ጥንካሬ(Color Intesity) | | | | | | |
| 2 | የተመረጠው ቀለም ከአካባቢውን የውጨኛው ግድግዳ ቀለም ጋር በትክክል መዛመዱን ማረጋገጥ | | | | | | |
| 3 | የተመረጠው ቀለም የመረጥንበት እሳቤ ማረጋገጥ | | | | | | |
| 4 | የተመረጠው ቀለም ያለውን ክብደት ማረጋገጥ | | | | | | |
| 5 | የተመረጠው ቀለም ከአካባቢውን የውጨኛው ግድግዳ ቀለም ጋር ተዘማጅ ቀለም መሆኑን ማረጋገጥ | | | | | | |

**ቅጽ-03**

**የተመረጠው የህንፃ የውጭ ግድግዳ ተዛማጅ ቀለም ከጤና ጋር ያለው ዝምድና የሚገመግምበት ነጥቦች**

| ተ.ቁ | ጤና ጋር ያለው ዝምድና | የህጻዎች ዲዛይን መደብ | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | | በግል የህንፃ ዲዛይን አማካሪ የሚሰሩ | | | በመንግስት የሚሰሩ የህንፃ ዲዛይን ፕሮጅክቶች | | |
| | | ከፍተኛ | በከፊል | የለውም | ከፍተኛ | በከፊል | የለውም |
| 1 | ጤናን ከማወክ | | | | | | |
| 2 | ተስማሚነቱ | | | | | | |